ቀን፡31/10/2013

# አባ ግርማ ከበደ ቤተ ክርስቲያንን ከነ ሕዝቧ ለመሸጥ የተዋዋሉበትን የክፍያ ቼክ ለመረከብ ይመስላል ለንደንን በስውር በመልቀቅ በዛሬው ዕለት (31/10/2013) አዲስ አበባ መግባታቸው ተረጋገጠ።



ርዕሰ አድባራት ለንደን ደብረ ጽዮን ቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያን በስደት ሃገር በስደተኛው ሕዝብ ከተመሠረተች 40 ዓመታትን ያስቆጠረች ሲሆን ከሁሉም በላይ ግን በተለይ ባለፉት 5 ዓመታት አባላቷ ባደረጉት ከፍተኛ ጥረትና ርብርቦሽ ገንዘብና ጉልበታቸውን አስተባብረው ከፍተኛ ዋጋ ያለው ህንፃ ቤተ ክርስቲያን ከነ መኖሪያ ቤቱ (Vicarage) በመግዛት ቤተ ክርስቲያኗ በእንግሊዝ ሃገር ለትውልድ የሚተላለፍ የህንፃ ቤተ ክርስቲያን ቅርስ ባለቤት ለመሆን አብቅተዋታል።

ይህንን ህንፃ ቤተ ክርስቲያንና የመኖሪያ ቤቱ (Vicarage) ለመግዛት የሚያስችል £1.700.000 (አንድ ሚሊዮን ሰባት መቶ ሺህ ፓውንድ) ወይም ደግሞ በኢትዮጵያ ብር ሲሰላ 51 ሚሊዮን ብር ለማዋጣት የተቻለው የቤተ ክርስቲያኑ አባላት፤ ደምወዝተኛው ከደምወዙ ቀንሶና ከልጆቹ አፍ ነጥቆ፤ እንዲሁም ኢትዮጵያ ውስጥ ከሚረዳው ዘመዱ ጋር አብቃቅቶ ሲሆን ስራ የሌለውም ሆነ ለመሥራት አቅም የለለው የአካል ጉዳተኛ ደግሞ ከመንግሥት ከሚሰጠው ድጎማ ላይ ከዕለት ጉርሱ በመቀነስ፤ ተጧሪውም ከጡረታ አበሉ በመቀነስ ወገቡን አስሮ ለሃይማኖቴና ለቤተ ክርስቲያኔ ካልሆነ ለምን ሊሆን ነው በማለት በመለገሱና ከልቡ በመሥራቱ ነው።

በመጀመሪያ የግዢ ውል ሲፈረምና የቤተ ክርስቲያኑ Leasehold  ዝውውር ሲደረግ በUK የመሬትና የንብረት ይዞታ ህግ መሠረት ንብረቱ ሊያዝ ከሚችልባቸው ሁለት መንገዶች አንዱ  ከ1-4 በሚደርስ ሰው በመሆኑ ሁለት ካህናትና ሁለት ምእመናን እንዲሆኑ ተደረገ። እነሱም አባ ግርማ ከበደ፤ ቄስ ዳዊት አበበ፤ ወ/ት ትዕግሥት ታደስ እና አቶ ታዬ ኃይሉ ይባላሉ።

የቤተ ክርስቲያኑ ግዢ ዕዳው ተከፍሎ እንዳለቀም እነዚሁ አራት ሰዎች Free hold ሰነድ ላይ ንብረቱን በስማቸው በአደራ ይዘውት እንዲቀጥሉ ተደረገ፡፡

ዕዳው ተከፍሎ ባለቀ ማግሥት ግን አባ ግርማ ከበደ በውስጥ መተዳደሪያ ደንብ ማሻሻያ ረቂቁ ምክንያት ስማቸው ከቤተ ክርስቲያን ንብረት ባለቤትነት መዝገብ ላይ የሚነሳበት ሁኔታ ሊፈጠር ይችላላ በሚል ስጋት ሕዝቡ በረቂቁ ላይ እንዳይወያይና እንዳይወስን በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሁከትና ብጥብጥ እንዲነሳ አስደረጉ።

የአባ ግርማ ከበደ ዓላማና ምኞት መንፈሳዊነት ያለው የምንኩስ ዓላማ ሳይሆን ለሥጋው ካደረ ሰውም የከፋ ዲያብሎሳዊ ዓላማ በመሆኑ ለሳቸው የሚታያቸው አባለቷ ጥረውና ግረው ቤተ ክርስቲያኗን ማቆማቸውና ከለፍተኛ ዕድገት ማብቃታቸው ሳይሆን ሁሉም ነገር የሳቸው የሥራ ውጤት ተደርጎ ተቆጥሮላቸው ባስገኙት ውጤት መሠረትም የጵጵስና ሹመት በማግኘት ሃገረ ስብከት ተሰጥቷቸው በሃብትና በንብረት ተሞልተው የተንደላቀቀ  ሕይወትን ለመምራት መቻላቸው ብቻ በመሆኑ  የንብረት አደራ ጠባቂነታቸውን መደራደሪያ በማድረግ ሕዝብን ከድተውና አባላቱን አራግፈው ጥለው ከኤምባሲና ከኢትዮጵያው የአገዛዝ ሥርዓት ተወካዮች ጋር መዋዋልና መፈራረም ጀመሩ።



ይህንን ለዚሃ ዓለም ሞቻለሁ በማለት ተገንዞ ምንኩስናን የተቀበለ ቀርቶ ማንኛውም ክርስቲያን ሊሰራው ይችላል ተብሎ የማይገመት አስከፊ ዓላማቸውን ለማሳካትም በቤተ ክርስቲያኗ ውስጥ ወንድም ከወንድምና እህት ከእህት አይደለም ለባልና ለሚስትም የተለያየ ወሬን በመንዛትና በማስዝነዛት በሕዝብ መካከል መቃቀር እንዲፈጠር አደረጉ።

ቀጥለውም የሕግ ረቂቁን ደብዛ ለማጥፍት ብለው ቀደም ብለው የነዙት የቦርድና የካምፓኒ ፕሮፓጋንዳ ሰው ግንዛቤ እያገኘ ብዙ አላስኬድ ሲላቸው አርዕስት ለወጥ በማድረግ ትላንት ሲኖዶስ የሾመውን ቤተ ክርስቲያን አላስደርስም በማለት ለ7 ዓመት እንዳልተቃወሙና ከሲኖዶስ ቀጥታ ትዕዛዝ እሚቀበሉ ቤተ ክርስቲያናት ሄደው የሚያገለግሉ ካህናትን እንዳላባረሩ፤ ወዲያው ተገልብጠው ቤተ ክርስቲያኗ ኢትዮጵያ ያለው ሲኖዶስ ባቋቋመው በሃገረ ስብከትና በቅዱስ ሲኖዶሱ ሥር ነች በማለት ጳጳሳትን ከኢትዮጵያ አስመጥተው ካህናትን በመሰብሰብ የርክክብ ውል ተፈራረሙ።

ይህንን የመሳሰለ ሕዝብ ውስጠ ምሥጢሩን በግልጽ አይረዳውም የሚሉትን አንጃ ግራንጃ በማስነሳት፤ በስደት ሃገር አስር፤ ሃያና ሰላሳ ዓመት ኖረው ወልደውና ከብደው ከሕዝብ ጋር ቤተ ሰብ ሆነው የሚገኙ የተወሰኑ ካህናት ሳይቀር የአባ ግርማን ፈለግ በመከተል በውሸትና በክህደት አሮንቃ ውስጥ ተዘፍቀው የሚያከብራቸውና የሚሽቆጠቆጥላቸው ሕዝብ አንቅሮ እንዲተፋቸው አስደረጉ። ከነዚህ የአባ ግርማን ሰይጣናዊ ፈለግ ተከታይ ከሆኑ ካህናት ጋር በመሆንም ወጣቱን ተሳዳቢና አባትና እናቱን አዋራጅ በማድረግ ከሕዝብ ጋር ሆድና ጀርባ አደረጉት። ይባስ ብለውም ወጣቶቹን በታላላቆቻቸሁ ላይ ዝመቱ ብለው በመቀስቀስ ስለ ቤተ ክርስቲያኑም ሆነ ስለ አባላቷ ምንንነት የማያውቁ ባተሌ ወጣቶች ሳይቀሩ በቤተ ክርስቲያን አባላት ላይ በመዝመት በኢትዮጵያውያን ሰደተኞች የኦርቶዶክስ ሃይማኖት ተከታዮች መካከል ደም እንዲፋሰስ አስደረጉ።

አባ ግርማ ግን ዓላማና ምኞቱን ያሳካልኛል እስካሳኩ ድረስ ይሉኝታም ሆነ ሃዘንና ርህራሄ ስለሌላቸው እነሆ ዛሬ ቤተ ክርስቲያን በመዝጋት ሕዝብን ከበተኑና እርስ በእርስ መቃቃርን በመፍጠር ደም ካፋሰሱ በኋላ ከሕዝብ መካከል በስውር ተነስተው ወደ አዲስ አበባ በመሄድ ንብረቱን ተረከቡኝና ለእኔ ምኞቱን አሳኩልኝ በማለት ለመደራደር ቀርበዋል።

**<u>የተንጣለለውን የቤተ ክርስቲያን ህንፃ ከነ መኖሪያ ቤቱ በአንጡራ ገንዘቡ የገዛው ስደተኛው ኢትዮጵያዊስ!! በእርግጥ አባ ግርማ እንደሚያስቡት ቁጥር ብቻ ነው? ሃብትና ንብረቱስ በአንድ ከሃዲ የዲያብሎስ መልዕክተኛ መነኩሴ ነኝ ባይ ሲሸጥና ሲለወጥ እጁን አጣጥፎ ቁጭ ብሎ ያያል?</u>**

ሌላው በምንኖርበት ሃገርም ሆነ በብዙ ሃገራት ሌባ ብቻ ሳይሆን የተሰረቀ ንብረትንም የገዛም ሆነ ይዞ የተገኘና የተባበረ ከሌባ ተለይቶ አይታይም። ዛሬም የሕዝብ ንብረት በሆነችው በርዕሰ አድባራት ለንደን ደብረ ጽዮን ቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያን ንብረት ላይ ከአባ ከበደ ጋር በጓዳ በር የሚደረግ ውልና ሸር ጉድ ሁሉ ሻጭን ብቻ ሳይሆን፤ ገዢ፤ ተቀባይና ተባባሪንም ጭምር እኩል እንደሚያስጠይቅ መታወቅ ይኖርበታል። በእርግጥ የአባ ግርማ ከበደን ዲያብሎሳዊ አላማና ምኞት ቀድሞ አውቆ ለሙብቱ ቆርጦ ለሚታገለው ሰው አሁንም ሆነ ትላንት አባ ግርማ ከበደ በሕዝብ ላይ ተረማምደው በሕዝብ ሃብትና ንብረት ተደራድረው፤ የሕዝብን ንብረት የመሸጥም ሆነ የመለወጥ ዓላማና ምኞታቸው ከቅዠትነት እንደማያልፍ ለማሳየት ቆርጦ የሚታገል ሲሆን የሚታዘነው ግን ይህንን ሳያውቁና ሳይረዱ ተዘርዝሮ በማያልቅ የአባ ግርማ ውሸትና ቅጥፈት እየተጠለፉ ለዘመናት አብረው ከኖሩት ወገኖቻቸው ጋር ስለተቀያየሙት ወገኖች ነው።

ላለፉት ወራት ሲነገር እንደነበረው ይኸው አልቀረም አባ ግርማ ከበደ ገና ሲኖዶሱ ሹመት የሚሰጥ ኮሚቴ አቋቋመ የሚለው ዜና ከአዲስ አበባ ሲወጣ ከደጋፊዎቻቸው በመሰወር በምስጢር ሲሸምቱ የከረሙትን ሁለት ሻንጣ ቁስ ሞልተው በዙሪያቸው ያለውን ሕዝብ አውላላ ሜዳ ላይ ጥለው ተሾልከው አዲስ አበባ ገብተዋል።

አባ ግርማ ከበደ ወደ አዲስ አበባ የኮበለሉት በቤተ ክርስቲያኗ ውስጥ ያቀጣጠሉትና ያስፋፉት ሰውን ከሰውና ሕዝብን ከሕዝብ የማጋጨት ተግባር እጅግ አሳሳቢ ደረጃ ላይ የደረሰ በመሆኑ ይህ ሁኔታ እልባት ያገኝ ዘንድ በሃገሪቱ ውስጥ ያሉ ቻሪቲዎችን (Charities) በበላይነት የሚመራውና የሚያስተዳድረው ቻሪቲ ኮሚሽን (Charity Commission) ሁሉቱንም ወገን አቅርቦ በማነጋገር ለችግሩ መፍትሔ ለማስገኘት ለ21 October 2013 ሰጥቶ የነበረውን ቀጠሮ ለ06 November 2013 በማዛወር፤ ቀጠሮው ሰላማዊና ሕጋዊ መፍትሔ ያስገኛል ተብሎ በሕዝቡ ተስፋ ተጥሎበት እያለ እሳቸው ግን ሕዝብንና የሚኖሩበትን ሃገር ሕግና ሥርዓት በመርገጥ ከኢትዮጵያው የአገዛዝ ሥርዓትና በአገዛዙ ቁጥጥር ሥር ከሚገኘው ሲኖዶስ አባላት መመሪያና ትዕዛዝ ለመቀበል እንደሆነ ለማወቅ ተችሏል።

አብሮ የኖረና ብዙ ክፉና ደግ ያየ ሕዝብ እንደዚህ አባ ግርማና መሰሎቻቸው ካህናት በሚነዙት ቅጥፈትና ውሸት ተለያይቶ አይቀርም! ሰው አይደለም እግዚአብሔር በጥበቡ መልሶ አንድ ያደርገዋል። ለዚህ ለሚያልፍ ቀን ግን ሰውነታችን ገፋፍቶን ክፉ አንናገር፤ ክፉ ተግባርም ከማድረግ እንቆጠብ፤ የማያልፍ ጊዜ የለምና አልፎ እንዳያስተዛዝበን እንጠንቀቅ።

ሌላው መልዕክት ከአራቱ ንብረቱን በስማቸው ከያዙት ባለ አደራዎች (Holding Trustees) ውስጥ ሁለቱ ካህናት ማለትም አባ ግርማ ከበደና ቄስ ዳዊት አበበ ቁልፍ በእጃችን ይዘናል በሚል የመኖሪያ ቤቱን ህንፃ (Vicarage) የነሱ ደጋፊዎች ለሆኑ የቤተ ክርስቲያኑ አባላት ላልሆኑ ሰዎች ጭምር እንዲገለገሉበት ሲያደርጉ ለጸሎት የመጣው ህንፃውን በአንጡራ ገንዘቡ የገዛውን የቤተ ክርስቲያኑን አባላት ግን የመጸዳጃ አገልግሎት አጥቶ ሲሰቃይ እንኳ ሃዘኔታ ሳያሳዩ ከፍተኛ በደል እየፈጸሙበት ይገኛሉ።

ይህ ሁሉ ሲሆን ሁለቱ ምእመናን ባለ አደራዎች (Holding Trustees) ማለትም አቶ ታዬ ኃይሉና ወ/ት ትዕግሥት ታደሰ በንብረቱ ላይ ከካህናቱ እኩል ሕጋዊ ሥልጣን እያላቸው ቢችሉ ከእውነት ጎን መቆም፤ ይህ ካቃታቸው ደግሞ ጉዳዩ የሕግ ብይን እስከሚያገኝ ድረስ ሁለቱም ወገን በንብረቱ እንዳይጠቀም በማድረግ የሚነሳውን አንባ ጓሮና ደም መፋሰስ ሁሉ መግታት ሲችሉ በክርስቲያንነታቸው አምኖና መርጦ አደራ የሰጣቸውን ሕዝብ የሁለቱ ካህናት መጫወቻ አድርገው በመተው በየቤታቸው ተሸሽገው መገኘት ስለሌላባቸው አሁንም ቢሆን ጊዜው ሳያልፍ ያላቸውን ሕጋዊ ውክልና ተጠቅመው ሕዝብን ከሚደርስበት ተጽዕኖና እርስ በእርሱ ሊያፋጁት በጭካኔ ከተነሱበት የዲያብሎስ መልዕክተኞች እንዲያድኑትና እነሱም ይህንን በማድረግ ለትውልድ ከሚዘልቅ የታሪክ ተጠያቂነት ራሳቸውን እንዲያድኑ ሕዝብ ጥሪውን ያስተላልፋል።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር!!